

# በሥዕል የተደገፈ የዕባዳዎች አፈጻጸም ፍቅህ

የእስላም ዝርዝር ሕግጋት ትምህርት በቀላል አቀራረብ

ጦሃራ | ሶላት | ጾም | ዘካ | ሐጅ


ዶክተር ዐብዱላህ ባህማም

ተርጓሚ

ሙሐመድ ጀማል ሙኽታር


# የጾም ማእዘናት በጾም ጊዜ የሚወደዱ የሚጠሉና ጾሙን የሚያበላሹ ነገሮች

# የጾም ማእዘናት በጾም ጊዜ የሚወደዱ የሚጠሉና ጾሙን የሚያበላሹ ነገሮች

መ ው ጫ



## የጾም ማእዘናት

### የመጀመሪያው ማእዘን ፡ ጾምን ከሚያበላሹ ነገሮች ከጎሕ መቅደድ እስከ ጸሐይ መጥለቅ ድረስ ተቆጥቦ መዋል፡፡

አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿وَكُلُوا۟ وَٱشْرَبُوا۟ حَتَّىٰ يَتَبَيَّنَ لَكُمُ ٱلْخَيْطُ ٱلْأَبْيَضُ مِنَ ٱلْخَيْطِ ٱلْأَسْوَدِ مِنَ ٱلْفَجْرِ ۖ ثُمَّ أَتِمُّوا۟ ٱلصِّيَامَ إِلَى ٱلَّيْلِ ۚ﴾ [البقرة:187]

‹‹ከጎህ የኾነው ነጩ ክርም ከጥቁሩ ክር (ከሌሊት ጨለማ) ለናንተ እስከሚገለጽላችሁ ድረስ ብሉ፤ጠጡም፤ ከዚያም ጾምን እስከ ሌሊቱ ድረስ ሙሉ፤›› [አል-በቀራህ፡187]

### ሁለተኛው ማእዘን ፡ ንይ’ያ

ንይያ ማለትም ለአላህﷻ ዕባዳ ብሎ ጾምን ከሚያስፈስኩ ነገሮች ለመቆጠብ ቁርጠኛ ውሳኔ ማድረግ፡፡ ነቢዩ ﷺ ‹‹ሥራዎች (የሚለኩት ከጀርባቸው ባለው ቁርጠኛ) ውሳኔ ነው፤እያንዳንዱ ሰውም በንይ’ያው መሰረት ነው የሚያገኘው፡፡››[1] ብለዋል፡፡

(1) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ



## ንይ’ያ በጾም

ጾሙ የግዴታ ጾም ከሆነ ንይ’ያው አስቀድሞ ከሌሊቱ መደረግ ይኖርበታል፡፡ ጾሙ ግዴታ ያልሆነ በፈቃደኝነት የሚጾም ነፍል ከሆነ ግን ጾምን የሚያበላሽ ነገር እስካልፈጸመ ድረስ ከነጋ በኋላ ቀን ነይቶ መጾም ይቻላል፡፡ እመ ምእመናን ዓኢሻ (ረዐ) ባስተላለፉት መሰረት ‹‹የአላህ መልእክተኛ ﷺ አንድ ቀን መጥተው የሚበላ ነገር አላችሁን? ሲሉ የለም አልን፤ ‹እንግዲያውስ እኔ ጾመኛ ነኝ› አሉ፡፡››[1] ብለዋል፡፡

(1) በሙስሊም የተዘገበ



## በጾም ጊዜ የሚፈቀዱ ነገሮች

1. ገላን መታጠብና ራስን ለማቀዝቀዝ ውሃ ውስጥ መቀመጥ፡፡
2. ምራቅና አክታን መዋጥ፡፡
3. ምንም ነገር ወደ ጉሮሮ እንዳልፍ ከማድረግ ግዴታ ጋር በምላስ ብቻ ምግብ መቅመስ፡፡
4. ጥሩ መዓዛ ያላቸውን ነገሮችና የአየር ማደሻ ሽታን ማሽተት፡፡

### ስዋክን (መፋቂያ) መጠቀም ለጾመኛ ሰው

የጥርስ መፋቂያን መጠቀም ከቀትር በፊትም ሆነ ከቀትር በኋላ፣በማንኛውም ወቅት፣ስዋኩ እርጥብም ይሁን ደረቅ የተደነገገ ሲሆን እርጥብ ከሆነ ግን ወደ ጉሮሮ እንዳያልፍ መጠንቀቅ ማድረግ ይገባል፡፡ ካለፈ ጾም ያስፈጥራልና፡፡

## በጾም የሚወደዱ ነገሮች

### 1. ሱሑር መበላትና ለፈጅር አዛን ጥቂት ጊዜ እስኪቀር ድረስ ማዘግየት

ነቢዩ ﷺ ‹‹ሱሑር ብሉ ሱሑር በረካ አለበትና፡፡››[1] ብለዋል፡፡ የሱሑር ሱንና በብዙም ሆነ በትንሽ ምግብ፣አንድ ጊዜ ውሃ በመጎንጨትም ቢሆን ሊገኝ ይችላል፡፡ ነቢዩ ﷺ ‹‹ሱሑርን መመገብ በረካ አለውና አትተውት፣አንዳችሁ አንድ ጊዜ ውሃ መጎንጨት ቢሆን እንኳ (አትተውት)፡፡ አላህና መላእኮቹ ሱሑርን በሚበሉት ላይ ሶላት (ምሕረትና ዱዓእ) ያወርዳሉና፡፡››[2] ብለዋል፡፡

ሱሑርን ወደ ሌሊቱ መጨረሻ ማዘግየት የተወደደ ነው፡፡ ዘይድ ብን ሣቢት (ረዐ) ባስተላለፉት መሰረት፡ ‹‹ከአላህ መልእክተኛ ﷺ ጋር ሱሑር በልተን ከዚያ ወደ ሶላት ተነሳን›› ሲሉ አነስ ብን ማሊክ ‹‹በሁለቱ መካከል የነበረው ጊዜ ምን ያህል ነበር?›› ብለው ጠየቁ፣ ‹‹ሃምሳ የቁርኣን ኣያ የሚቀራበት ያህል ነው››››[3] አሉ ብለዋል፡፡

(1) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ
(2) በአሕመድ የተዘገበ
(3) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ

### አዛን እየተደረገ መጠጣት

አንድ ሰው አዛን በመደረግ ላይ መሆኑን ቢሰማና የሚጠጣውን ነገር በእጁ ይዞ የሚገኝ ከሆነ እስኪያበቃ መጠጣት ይችላል፡፡ ከአቡ ሁረይራ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት የአላህ መልእክተኛ ﷺ ‹‹አንዳችሁ (የመጠጫ) እቃውን በእጁ ላይ እንደያዘ አዛን ሲደረግ ከሰማ (ጠጥቶ) ፍላጎቱን እስኪያረካ ድረስ አያስቀምጠው፡፡››[4] ብለዋል፡፡ ዑለማእ ይህን ሐዲስ ጎህ ቀዷል አልቀደደም ብሎ የተጠራጠረውን ሰው የሚመለከት ያደርጉታል፡፡ ጎህ መቅደዱን ያረጋገጠ ሰው ግን መብላትም ሆነ መጠጣት አይገባውም፣እርግጠኛ ከሆነ በኋላ ከፈጸመው ግን ጾሙ ተበላሽቷልና መክፍል (ቀዷእ) ግዴታ ይሆንበታል፡፡

### 2. ፍጥርን ማፋጠን

ጾመኛው ጸሐይ መጥለቋን ካረጋገጠ ጾሙን ቶሎ መፈሰክ የተወደደ ነው፡፡ ነቢዩ ﷺ ‹‹ሰዎች ፍጥርን እስካፋጠኑ ድረስ በጥሩ ሁኔታ ላይ መሆናቸውን ይቀጥላሉ፡፡››[5] ብለዋል፡፡ ማታ ሲፈሰክ በእሸት ተምር፣ ካልተገኘ በተምር ማፍጠርና የፍሬዎቹ በኢተጋማሽ (ውትር) ቁጥር መሆን የተወደደ ነው፡፡ ተምር ካልተገኘ ደግሞ ውሃ በመጎንጨት ማፍጠር ነው፡፡ አነስ ብን ማሊክ (ረዐ) ባስተላለፉት ሐዲስ ነቢዩ ﷺ ‹‹ነቢዩ ﷺ ከመስገዳቸው በፊት በእሸት ተምር፣እሸቱ ከሌለ በተምር ፍሬዎች፣ ካልተገኘም ውሃ በመጎንጨት ያፈጥሩ ነበር፡፡››[6] ብለዋል፡፡ የሚያፈጥርበት ምንም ነገር ካልተገኘ በልቡ ፍጥር መነየት ብቻ በቂ ይሆናል፡፡

### 3. በፍጥር ጊዜ የሚደረግ ዱዓእ

የአላህ መልእክተኛ ﷺ ሲያፈጥሩ ፡- ‹‹ዘሀበ አዝ'ዘመኡ፣ ወብተል'ለትል ዑሩቁ፣ወሠበተል አጅሩ እንሻአል'ሏህ››[7] ይሉ ነበር፡፡ ትርጉሙ ‹‹ጥማቱ ሄደ፣ጅማቶቹ ራሱ፣ በአላህ ፈቃድ አጅሩም (ምንዳው) ጸና፡፡›› ማለት ነው፡፡ በተጨማሪም ነቢዩ ﷺ ‹‹ጾመኛ ሰው በሚያፈጥርበት ጊዜ እምቢ የማይባል (መቅቡል የሆነ) ዱዓእ አለው፡፡››[8]ብለዋል፡፡

(4) በአቡ ዳዉድ የተዘገበ
(5) በአቡ ዳዉድ የተዘገበ
(6) በትርምዚ የተዘገበ
(7) በአቡ ዳዉድ የተዘገበ
(8) በእብን ማጃህ የተዘገበ

## በስሕተት ያፈጠረ ሰው

አንድ ጾመኛ ጸሐይ የጠለቀች ወይም ገና ጎህ ያልቀደደ መስሎት ቢበላና ግምቱ የተሳሳተ መሆኑ ቢረጋገጥ ጾሙን የመክፈል ግዴታ አይኖርበትም። አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿وَلَيْسَ عَلَيْكُمْ جُنَاحٌ فِيمَا أَخْطَأْتُم بِهِۦ وَلَٰكِن مَّا تَعَمَّدَتْ قُلُوبُكُمْ ۚ وَكَانَ ٱللَّهُ غَفُورًا رَّحِيمًا ﴿٥﴾﴾ [الأحزاب:5]

‹‹በርሱ በተሳሳታችሁበት ነገርም በናንተ ላይ ኃጢአት የለባችሁም፤ግን ልቦቻችሁ ዐውቀው በሠሩት፣(ኃጢኣት አለባችሁ)፤አላህም መሓሪ አዛኝ ነው።›› [አል-አሕዛብ:5]

ነቢዩም ﷺ ‹‹በስሕተት፣በመርሳትና ተገደው በሠሩት ነገር የመጠየቅ ኃላፊነትን አላህ ከኔ ኡመት ላይ አንስቷል።››[1] ብለዋል።

(1) በእብን ማጃህ የተዘገበ

## 4. አልባሌና መጥፎ ቃላትን መተው

ነቢዩ ﷺ ‹‹አንዳችሁ በሚጾምበት ቀን መጥፎ ነገር አይናገር፤ድምጹንም ከመጠን በላይ ከፍ አያድርግ (አይጣላ፣አይጯጯህ)። ሌላ ሰው ቢዘልፈው ወይም ቢጣላው እኔ ጾመኛ ነኝ፣እኔ ጾመኛ ነኝ ይበልም።››[1] ብለዋል። በተጨማሪም ነቢዩ ﷺ ‹‹በሐሰት መመስከርን እና በዚያ መሰረት መስራትን እርግፍ አድርጎ ያልተወን ሰው፣ምግብና መጠጡን ከመተው አላህ ጉዳይ የለውም።››[2]ብለዋል።

## 5. ዕባዳዎችን ማብዛት

ቁርኣን መቅራትን፣አላህን መዘከርን፣የተራዊሕ ሶላትና ቅያም አል'ለይልን፣የለይለቱል ቀድርን ምሽት በዕባዳ ሕያው ማድረግን፣ረዋትብ ሱናዎች መስገድን፣ሶደቃ መስጠትን፣ልገሳና ደግነትን፣ለበጎ ሥራዎች ወጭ ማድረግን፣ጾመኞችን ማስፈጠርን፣ዑምራ ማድረግን የመሳሰሉ ዕባዳዎችን ማብዛት ረመዷን ውስጥ የሚሰራ መልካም ሥራ አጅሩ እጥፍ ድርብ በመሆኑ እጅግ የተወደደ ነው። ከእብን ዐባስ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት፡- ‹‹የአላህ መልእክተኛ ﷺ በጎ ነገር በመለገስ ከሰዎች ሁሉ የበለጠ ቸር ሲሆኑ ከምንጊዜም በላይ እጅግ ለጋስ የሚሆኑት በረመዷን ወር ነበር። ከጅብሪል ﷻ በየዓመቱ በረመዷን ይገናኙና የአላህ መልእክተኛ ﷺ ቁርኣንን ለጥናት በርሱ ላይ ይቀሩ ነበር። ከጅብሪል ﷻ ጋር ሲገናኙ የአላህ መልእክተኛ ﷺ በበጎ ሥራና በልገሳ ከተለቀቀ ንፋስ ይበልጥ ቸር፣ፈጣንና ሁሉን የሚያዳርሱ ነበሩ።››[3] ብለዋል።

## 6. በመጨረሻዎቹ የረመዷን አስር ቀናት ለዕባዳ ከፍተኛ ጥረት ማድረግ

ከዓእሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት፡- ‹‹ነቢዩ ﷺ የረመዷን የመጨረሻዎቹ አስር ቀናት ሲጀምሩ ሽርጣቸውን ያጠብቁ[4]፣ሌሊቶቹን (በዕባዳ) ሕያው ያደርጉና ቤተሰባቸውንም (ለዕባዳ) ይቀሰቅሱ ነበር።››[5] ብለዋል።

# በጾም የሚጠሉ ነገሮች

## 1. መጉመጥመጥንና ውሃ በአፍንጫ

## መሳብን ከልክ በላይ ማድረግ

ይህም ውሃ ከጉሮሮ አልፎ እንዳይሄድና ጾም እንዳይበላሽ ሲባል ነው። ነቢዩ ﷺ ‹‹ውሃ በአፍንጫ ስበህ ማስወጣትን ጾመኛ ካልሆንክ በደንብ አድርግ።››[6] ብለዋልና።

## 2. ስሜት በሚቀሰቅስ ሁኔታ መሳሳም

ጾመኛ ሰው አባለዘር እንዳይወጣ ወይም ወሲባዊ ስሜቱ እንዳይቀሰቀስ ከፈራ ለዚህ መንስኤ ሊሆኑ

(1) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ
(2) በአቡ ዳዉድ የተዘገበ

(3) በቡኻሪ የተዘገበ
(4) ከወገብ በታች የሚታጠቁትን ሽርጥ ማጥበቅ ማለት ከተለመደው በላይ ልዩ ጥረት ማድረግን የሚያመለክት ሲሆን፣አባባሉ ከግብረ ሥጋ ግንኙነት መራቅንም ያመለክታል ተብሏል።
(5) በቡኻሪ የተዘገበ
(6) በአቡ ዳዉድ የተዘገበ

ከሚችሉ ነገሮች ሁሉ መራቅ ስለሚኖርበት መሳሳም የተጠላ ነው፡፡ ጾሜ አይበላሽም ብሎ በራሱ ከተማመነ ግን ማድረጉ ችግር የለውም፡፡ ከዓኢሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት፡- ‹‹ነቢዩ ﷺ ጾመኛ ሆነው ይስሙና ገላ ለገላ ይነካኩ ነበር፤ከማንኛችሁም በላይ ስሜታቸውን የሚቆጣጠሩም ነበሩ፡፡››[1] ብለዋል፡፡ ለዚህም ነው ከተቃራኒ ጾታ ጋር ንኪኪ መፍጠር ለሽማግሌ ሳይሆን ለወጣት የተጠላ የሆነው፡፡ አቡ ሁረይራ (ረዐ) ባስተላለፉት መሰረት ‹‹አንድ ሰው ጾመኛ ሆኖ ከተቃራኒ ጾታ ጋር ንኪኪ ስለማድረግ ነቢዩን ﷺ ሲጠይቃቸው ፈቀዱለት፤ሌላ ሰው መጥቶ ሲጠይቃቸው ደግሞ ከለከሉት፤የፈቀዱለት ሰውዬ ሽማግሌ ሲሆን የከለከሉት ደግሞ ወጣት ነበር፡፡››[2] ብለዋል፡፡

## ጾምን የሚያበላሹ ነገሮች

### 1. ረመዷን ውስጥ በቀን ሆን ብሎ መብላትና መጠጣት

አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿وَكُلُوا۟ وَٱشْرَبُوا۟ حَتَّىٰ يَتَبَيَّنَ لَكُمُ ٱلْخَيْطُ ٱلْأَبْيَضُ مِنَ ٱلْخَيْطِ ٱلْأَسْوَدِ مِنَ ٱلْفَجْرِ ۖ ثُمَّ أَتِمُّوا۟ ٱلصِّيَامَ إِلَى ٱلَّيْلِ ۚ﴾ [البقرة:187]

‹‹ከጎህ የኾነው ነጩ ክርም ከጥቁሩ ክር (ከሌሊት ጨለማ) ለናንተ እስከሚገለጽላችሁ ድረስ ብሉ፤ጠጡም፤ ከዚያም ጾምን እስከሌሊቱ ድረስ ሙሉ፤›› [አል-በቀራህ:187]



**ለሥራ ብሎ ማፍጠር**

በመጋገሪዎች እና አስቸጋሪ በሆኑ ሥራዎች ላይ የተሰማሩት፤እንደ ሌላው ሙስሊም ሁሉ የመጾም ግዴታ ስላለባቸው በሥራቸው ክብደት ምክንያት እንዲያፈጥሩ አይፈቀድላቸውም፡፡



## ማሳሰቢያዎች

ዘንግቶ የበላ ወይም የጠጣ ጾመኛ ጾሙ ትክክለኛ ሲሆን ሲያስታውስ ወዲያውኑ ማቆም ግዴታ ይሆንበታል፡፡ ነቢዩ ﷺ ‹‹ጾመኛ መሆኑን ረስቶ የበላ ወይም የጠጣ ሰው፣ያበላውና ያጠጣው አላህ ነውና ጾሙን ቀጥሎ ያሟላው፡፡››[1] ብለዋል፡፡ ለምግብነት በሕክምና መርፌ የሚሰጠው የምግብነትና የመጠጥነት ባህሪ ያለው በአፍ በኩልም ሆነ በአፍንጫ ወደ ውስጥ የሚደርስ ማንኛውም ነገር ጾምን ያበላሻል፡፡ ምግብን የማይተካ እንደ ፔንስሊን ያለና የመሳሰለው መርፌ ግን ለምግብነትም ሆነ ለመጠጥነት የማያገለግል በመሆኑ ጾም አያበላሽም፡፡

የግድ አስፈላጊ ሆኖ በአፍ በኩል የሚገባ እንደ ህክምና መመርመሪያ ቱቦና የአስም ሕሙማን አየር መንፊያ ያለው ጾም አያበላሽም፡፡

የዓይን ኩል፣በዓይንና ጆሮ የሚጨመር ጠብታ ጾም ስለማበላሸታቸው ማስረጃ ባለመኖሩና ዓይን መደበኛው የምግብ መግቢያ መንገድ ባለ መሆኑ ጾም አያበላሽም፡ የጆሮና የአፍንጫ ጠብታም እንዲሁ፡ የአፍንጫ ጠብታን በተመለከተ ግን ነቢዩ ﷺ ጾመኛ እስትንሻቅን በሚገባ እንዳያደርግ የከለከሉ[2] በመሆኑና አፍንጫ የምግብ መግቢያ መንገድ ሲሆን በመቻሉ ጥንቃቄ ማድረግ አስፈላጊ ነው፡፡



(1) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ
(2) በአቡ ዳዉድ የተዘገበ

(1) በሙስሊም የተዘገበ
(2) በትርምዚ የተዘገበ



ለቀለብነት የሚውል መድኃኒት ጾም ያበላሻል



የፔንስሊን መርፌ ጾም
አያበላሽም



የአስም አየር መንፌያ ጾም አያበላሽም



የዓይን ኩል ጾም
አያስፈጥርም

ለቀለብነት የማያገለግል ወይም ጎጂ የሆነ እንደ ሲጋራ ያለ ነገር፣በምግብ መግቢያ በኩል የሚወሰድ ከመሆኑም በላይ የምግብነትና መጠጥነት ትርጉም ያለው በመሆኑ መውሰዱ ጾም ያበላሻል።



ሲጋራ ማጤስ ጾም ያበላሻል

እንደ መንገድ አቧራና ጥርሶች መካከል የሚቀሩ የምግብ ቅሪቶችን የመሳሰሉ በጥንቃቄ ለማስቀረት



በጥርሶች መካከል የሚቀር ቅሪት አያስፈጥርም

የሚያስቸግሩ ነገሮችም ጾም አያበላሹም፡

## 2.የግብረ ሥጋ ግንኙነት

አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿أُحِلَّ لَكُمْ لَيْلَةَ ٱلصِّيَامِ ٱلرَّفَثُ إِلَىٰ نِسَآئِكُمْ﴾ [البقرة:187]

‹‹በጾም ሌሊት ወደ ሴቶቻችሁ መድረስ ለናንተ ተፈቀደላችሁ፤›› [አል-በቀራህ፡187]

ጾመኛ ሆኖ ወሲባዊ ግንኙነት የፈጸመ ሰው ጾሙ የሚበላሽ ሲሆን፣ያበላሸውን ቀን ጾም ከከፍተኛው ማበሻ (ከፍ'ፋራ ሙገል'ለዛ) ጋር የመክፈል ግዴታ አለበት፡ ይህም ጫንቃን ነጻ ማውጣት፣ካላገኘ ሁለት ወር በተከታታይ መጾም፣ካልቻለ ስልሳ ድኾችን መመገብ ነው። አቡ ሁረይራ (ረዐ) ባስተላለፉት መሰረት ‹‹አንድ ሰውዬ ወደ ነቢዩ ﷺ መጣና እኔ ጠፍቻለሁ! አለ፤ምን ሆነሃል? አሉት። በረመዷን (ቀን) ከሚስቴ ጋር ግንኙነት ፈጸምኩ አላቸው። ጫንቃ ነጻ ማውጣት ትችላለህ? ሲሉት አልችልም አላቸው። ሁለት ወራት በተከታታይ መጾምስ ትችላለህ? አሉት። አልችልም አለ። ስልሳ ድኾችን መመገብ ትችላለህ? አሉት፤ አልችልም አለ። እስኪ ቁጭ በል አሉትና ተቀመጠ። ነቢዩ ﷺ በአንድ ትልቅ መስፈሪያ ﷺ ተምር አመጡና ይህን ወስደህ ሶደቃ ስጥ አሉት። ከኛ የበለጠ ድኻ ለሆነ ሰው ነው? ሲል ጠየቃቸው፡ ነቢዩ ﷺ የጎን ጥርሶቻቸው እስኪታዩ ድረስ ሳቁና ቤተሰብህን መግበው አሉት።››(1) ብለዋል፡፡ ከፍ'ፋራው በተጠቀሰው ቅደም ተከተል መሰረት መሆን ይኖርበታል። መጾም የሚችል እስከሆነ ድረስ ድኾችን አይመግብም፤ጫንቃን ነጻ ማውጣት እስከቻለ ድረስም በተከታታይ አይጾምም።

ሴቲቱ ለወንድዬው አድራጎት ፈቃደኛ ሆና አብራ ከፈጸመች ከፍፋራው እሷንም ይመለከታል። ባሏ ለግብረ ሥጋ ግንኙነት አስገድዷት ከሆነ ግን ጾሟ የሚበላሽ በመሆኑ ከፍ'ፋራው ሲቀር ጾሙን የመክፈል ግዴታ ይኖርባታል።

የአባለዘር ፈሳሽ በፍላጎት ከብልት መርጨት እንደ ግብረ ሥጋ ግንኙነት የሚታይ ሲሆን፣ጾመኛው በመሳሳም በመተሻሸት ወይም ብልትን በመነካካትና በሌላ ምክንያት እንዲወጣ ካደረገ፣እነዚህ ሁሉ ጾምን የሚጻረር ስሜታዊ ፍላጎት በመሆናቸው ጾሙ ይበላሻል፡ ስለዚህም ያለ ማበሻ ከፍፋራ ጾሙን የመክፈል ግዴታ አለበት። ማስረጃ የተላለፈው የግብረ ሥጋ ግንኙነትን ብቻ አስመልክቶ በመሆኑ ከፍፋራው አይመለከተውም።

በገላ ንክኪ ወይም ስለወሲብ በማሰብ የመዚይ እርጥበት ከብልት ቢወጣ ማስረጃ ባለመኖሩ ጾም አያበላሽም።

ጾመኛው ቀን ተኝቶ በሕልሙ ወሲብ ቢፈጽም፣ ወይም በበሽታ ምክንያት የአባለዘር ፈሳሽ ከብልቱ ቢፈስ፣ከርሱ ቁጥጥር ውጭ በመሆኑ ጾሙ አይበላሽም።

ከጎህ መቅደድ በፊት በግብረ ሥጋ ግንኙነት ወይም በወሲባዊ ሕልም ምክንያት ገላን የመታጠብ

(1) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ

ግዴታ (ጀናባ) ኖሮበት ሳይታጠብ የነጋበት ጾመኛ ጾሙ ትክክለኛ ሲሆን፣የሱብሕን ሶላት በጀማዓ ለመስገድ ገላውን መታጠብ ይኖርበታል። ከዓኢሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት የአላህ መልእክተኛ ﷺ ጀናባ እያለባቸው የፈጅር ሶላት ይደርስባቸውና ገላቸውን ታጥበው ይጾሙ እንደነበር ተረጋግጧል፡ ፡



## 3. ሆን ብሎ ማስታወክ

ይህ በፍላጎት ምግብና መጠጥን ከሆድ በአፍ በኩል ማስወጣት ሲሆን፣ከፍላጎት ውጭ ካስመለሰው ግን ጾሙ ላይ ችግር አይፈጥርበትም። ነቢዩ ﷺ ‹‹ከፍላጎቱ ውጭ ያስመለሰው ሰው (ጾሙን) መክፈል አይኖርበትም፤ሆን ብሎ ያስታወከ ግን ይክፈል።›› ብለዋልና።

## 4. የወር አበባና የወሊድ ደም

አንዲት ሴት ጸሐይ ከመጥለቋ ከጥቂት ሰከንዶች በፊት እንኳ ቢሆን የወር አበባ ወይም የወሊድ ደም ካየች ጾሟ ስለሚበላሽ የመክፈል ግዴታ ይኖርባታል።

## ጠቃሚ ነጥብ

ዋግምት (ደምን በተለየ ሁኔታ ከሰውነት ማስወጣት) ሚዛን በደፋው የዑለማእ አቋም ጾም አያበላሽም። ነቢዩ ﷺ እየጾሙ ዋግምት መጠቀማቸው ተዘግቧል። ከአቡ ሰዒድ አልኹድሪ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹የአላህ መልእክተኛ ﷺ ለጾመኛ ሰው ሚስቱን መሳምና ዋግምትን ፈቅደዋል›› ብለዋል። ዋግምት ስለሚያደክም የተጠላ ነው። አነስ ብን ማሊክ (ረዐ) ዋግምትን ለጾመኛ ሰው የተጠላ አድርጋችሁ ትወስዱ ነበርን? ተብለው ሲጠየቁ ‹‹የሚያደክም በመሆኑ እንጂ የተጠላ አድርገን አንወስደውም ነበር›› ብለዋል።

በቁስል ወይም በጥርስ መነቀል፣ወይም በነስርም ምክንያት ደም መፍሰሱ ችግር አይኖረውም። በመርፌ አማካይነት ለምርመራም ሆነ ለደም ልገሳ ደም መወሰድም ጾም አያበላሽም።



